

# በሥዕል የተደገፈ የዕባዳዎች አፈጻጸም ፍቅህ

የእስላም ዝርዝር ሕግጋት ትምህርት በቀላል አቀራረብ

ጦሃራ | ሶላት | ጾም | ዘካ | ሐጅ


ዶክተር ዐብዱላህ ባህማም

ተርጓሚ

ሙሐመድ ጀማል ሙኽታር


## በረመዷን ጾምን የሚያስፈጥሩ ምክንያቶችና ጾሞ መክፈል (ቀዷእ)

3

# በረመዷን ጾምን የሚያስፈጥሩ ምክንያቶችና ጾሞ መክፈል (ቀዷእ)



**መ ው ጫ**

በረመዷን ጾምን የሚያስፈጥሩ ምክንያቶች

ጾሞ መክፈል (ቀዷእ)

## በረመዷን ጾምን የሚያስፈጥሩ ምክንያቶች (ዑዝር)

### 1. በሽታ

የታመመ ሰው ረመዷን ውስጥ መፈሰክ ይፈቀድለታል፡፡ አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

﴿فَمَن كَانَ مِنكُم مَّرِيضًا أَوْ عَلَىٰ سَفَرٍ فَعِدَّةٌ مِّنْ أَيَّامٍ أُخَرَ﴾ [البقرة:184]

‹‹ከናንተም ውስጥ በሽተኛ ወይም በጉዞ ላይ የሆነ ሰው፣ከሌሎች ቀኖች ቁጥሮችን መጾም አለበት፤››[አል-በቀራህ:184]

ማፍጠርን የሚያስፈቅደው በሽታ፣ ታማሚውን መጾም እንዳይችል የሚያደርግ ወይም በመጾሙ ምክንያት ተባብሶበት ለጉዳት የሚዳርገው በሽታ ነው፡፡

### የታመመ ሰው ካፈጠረ

ሕመምተኛው ካፈጠረ - በሽታው የመዳን ተስፋ ያለው ከሆነ - ከዳነ በኋላ በፈሰከባቸው ቀናት ልክ ጾሞ የመክፈል ግዴታ አለበት፡፡ አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

﴿فَمَن كَانَ مِنكُم مَّرِيضًا أَوْ عَلَىٰ سَفَرٍ فَعِدَّةٌ مِّنْ أَيَّامٍ أُخَرَ﴾ [البقرة:184]

‹‹ከናንተም ውስጥ በሽተኛ ወይም በጉዞ ላይ የሆነ ሰው፣ከሌሎች ቀኖች ቁጥሮችን መጾም አለበት፤›› [አል-በቀራህ:184] ክሮኒክ ዓይነት ሆኖ በሽታው የመዳን ተስፋ የሌለው ከሆነ፣ወይም በዕድሜ የገፋ ሆኖ በቀጣይነትም መጾም የማይችል ደካማ ከሆነ፣ላፈጠረበት እያንዳንዱ ቀን ግማሽ ሷዕ[1] ሩዝ ወይም የመሳሰለውን የአገሩን የምግብ እህል ለድሃ የመመገብ ግዴታ ይኖርበታል፡፡

(1) አንድ ሷዕ መጠኑ የመካከለኛ ሰው አራት እፍኝ ሲሆን፣ በኪሎ ግራም ሁለት ኪሎ ከሩብ (2..250ኪ.ግ) ያህል ነው፡፡ በዚህ መሰረት ለአንድ ድሃ ለአንዱ ቀን ጾም የሚከፈለው አንድ ኪሎ ከአንድ መቶ ሃያ አምስት ግራም ያህል ነው ማለት ነው፡፡

## 2. ጉዞ

በረመዷን ውስጥ ለተጓዘ ሰው ማፍጠር የሚፈቀድለት ሲሆን ባፈጠረው ቀን ልክ ጾሞ የመክፈል ግዴታ ይኖርበታል። አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

﴿فَمَن كَانَ مِنكُم مَّرِيضًا أَوْ عَلَىٰ سَفَرٍ فَعِدَّةٌ مِّنْ أَيَّامٍ أُخَرَ﴾
[البقرة:184]

‹‹ከናንተም ውስጥ በሽተኛ ወይም በጉዞ ላይ የሆነ ሰው፣ከሌሎች ቀኖች ቁጥሮችን መጾም አለበት፤››
[አል-በቀራህ:184]

ጾም ማፍጠርን የሚያስፈቅደው የጉዞ ርቀት ሶላትን ማሳጠር (ቀስር) የሚያስፈቅደው የጉዞ ርቀት ነው። ጉዞው የተፈቀደ ሕጋዊ (ሙባሕ) ጉዞ መሆን ይኖርበታል። ጉዞው የአላህን ሕግ ለመጣስ የሚደረግ ወይም ጾሙን ለመብላት ብቻ የታሰበ የማሻጠር ሁኔታ ካለበት ግን በዚህ ጉዞ ጾሙን መፈሰክ አይፈቀድም። መንገደኛው የተሰጠውን ፈቃድ መጠቀም ትቶ ከጾመ ጾሙ ትክክለኛ ነው። አነስ ብን ማሊክ (ረዐ) ባስተላለፉት መሰረት ‹‹ከነቢዩ ﷺ ጋር እንጓዝ ነበር፣(በጉዞው ላይ) ጾመኛው ባልጾመው ላይ፣ያልጾመውም በጾመኛው ላይ ምንም ተቃውሞ አልነበረውም።››[1] ብለዋል። ይህ ግን መጾሙ በጉዞው ላይ ችግር የማይፈጥርበት ወይም ለጉዳት የማይዳርገው ከሆነ ነው፤አሊያ ማፍጠሩ በላጭ ነው። ነቢዩ ﷺ አንድ ጾመኛ ሰው በጉዞ ላይ በከባድ ሙቀት ምክንያት ጥላ ተደርጎለትና ሰዎች ከበውት ሲያዩ ፡- ‹‹በጉዞ ላይ መጾም ከበጎ ነገር አይወሰድም።››[2] ብለዋልና፡ ፡

## 3. እርግዝና እና ጡት አጥቢነት

እርጉዝ ወይም አጥቢ ሴት መጾም ለጉዳት ይዳርገኛል ብላ ከሰጋች ጾሙን አፍጥራ እንደ ሕመምተኛ ሁሉ ጾማ ትከፍላለች። ነቢዩ ﷺ ‹‹አላህ ﷻ ከመንገደኛ ሰው ጾምና ግማሽ ሶላትን፣ከእርጉዝ ወይም አጥቢ ሴት ደግሞ ጾምን አንስቶላቸዋል።››[3] ብለዋል። ለራሷ ሳይሆን ለልጇ ከፈራች ታፈጥራለች። በኋላ ላፈጠረችበት ቀን አንድ ድሃ ከመመገብ ጋር ጾማ የመክፈል ግዴታ አለባት። እብን ዐባስ (ረዐ) ‹‹አጥቢ እናትና እርጉዝ ለልጆቻቸው ደህንነት ስጋት ከገባቸው ያፈጥሩና (ለድሃ) ይመግባሉ።››5[4] ብለዋል።

(1) በቡኻሪ የተዘገበ
(2) በቡኻሪ የተዘገበ
(3) በትርምዚ የተዘገበ
(4) በአቡ ዳዉድ የተዘገበ

## 4. የወር አበባና የወሊድ ደም

በረመዷን የወር አበባ ወይም የወሊድ ደም የመጣባት ሴት የግዴታ ታፈጥራለች። በዚህ ሁኔታ መጾም ሐራም ይሆንባታልና። ከጾመች ትክከለኛ ተደርጎ አይወሰድም። ቀኑን ጾማ መክፈል ግዴታ ነው። ዓእሻ (ረዐ) ሴት በወር አበባ ምክንያት ጾምን ጾማ ስትከፍል ሶላትን ለምን ሰግዳ እንደማትከፍል ተጠይቀው ‹‹ይህ ነገር ያጋጥመንና ጾምን እንድንተካ ስንታዘዝ ሶላትን ሰግደን እንድንከፍል አንታዘዝም ነበር።››[5] ብለዋል።

# ጾምን መክፈል (ቀዷእ)

አንድ ሙስሊም ከረመዷን ጾም አንድ ቀን ያለ ሸሪዓዊ ምክንያት (ዑዝር) ካፈጠረ ተጸጽቶ ወደ አላህ በመመለስ ምሕረቱን መለመን ይኖርበታል፡ ፡ ይህን ማድረግ ከባድ ጥፋትና አስከፊ ኃጢአት በመሆኑ ከተውበቱ ጋር ከረመዷን በኋላ ባፈጠረው ቀን ልክ ጾሞ መክፈል ግዴታ ነው። የማፍጠር ፈቃድ የሌለውና በወቅቱ መፈጸም የነበረበትን ግዴታ የተወ በመሆኑ፣ በትክክለኛው የዕልም ባለቤቶች አቋም የቀዷእ ግዴታው ወዲያውኑ መፈጸም ይኖርበታል።

በወር አበባ ወይም በወሊድ ደም፣በበሽታ ወይም በጉዞና በመሳሰሉት ሸሪዓዊ ምክንያቶች (አዕዛር) ያፈጠረ ሰው፣መጾም የሚችል እስከሆነ ድረስ ወዲያውኑ ሳይሆን እስከ ቀጣዩ ረመዷን ድረስ በተራዘመ ጊዜ ውስጥ ጾሞ መክፈል ግዴታ ይሆንበታል። ዓእሻ (ረዐ) ባስተላለፉት መሰረት ‹‹የሚከፈል ጾም ይኖርብኝና እስከ ሸዕባን ወር ድረስ ለአላህ መልእክተኛ ﷺ ጉዳይ ስል ጹሜ መክፈል አልችልም ነበር።››[6] ብለዋል። ይሁን እንጂ ቶሎ መክፈል ራስን በፍጥነት ከዕዳ ነጻ ማድረግ በመሆኑና በሕመምና በመሳሰለው ምክንያት ከመጾም የሚከለክል አጋጣሚ ሊፈጠር ስለሚችል ለጥንቃቄ ሲባል ቶሎ ጾሞ መክፈሉ የተወደደ ነው።

ዑዝሩ ቀጣይ በመሆኑ ወይም በሌላ ዑዝር ምክንያት እስከ ቀጣዩ ረመዷን ክፍያውን ካዘገየ ከሁለተኛው ረመዷን በኋላ መጾም ይኖርበታል።

(5) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ
(6) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ

ያለ ምክንያት እስከ ሁለተኛው ረመዷን ካዘገየው - በብዙኃኑ ፉቀሃእ አቋም መሰረት - ጾሞ ከመክፈሉ ጋር ለያንዳንዱ ቀን ግማሽ ሷዕ የአገሩ የቀለብ እህል ለአንድ ድሃ የመክፈል ግዴታ አለበት። በሐነፊና ዟህሪ መዝሀቦች ግን የመመገብ ግዴታ የለበትም።

ጾሞ ሲከፍል ቀናቱን የማከታተል ግዴታ አይኖርበትም፣ አከታትሎና ለያይቶ መጾምም ይቻላል፡ አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

﴿فَمَن كَانَ مِنكُم مَّرِيضًا أَوْ عَلَىٰ سَفَرٍ فَعِدَّةٌ مِّنْ أَيَّامٍ أُخَرَ﴾
[البقرة:184]

‹‹ከናንተም ውስጥ በሽተኛ ወይም በጉዞ ላይ የሆነ ሰው፣ከሌሎች ቀኖች ቁጥሮችን መጾም አለበት፤›› [አል-በቀራህ:184] አላህ ﷻ በአንቀጹ ውስጥ ቀኖቹን ተከታታይ መሆናቸውን አልጠቀስም፣ቢሆኑ ኖሮ ያብራራ ነበር።

የረመዷን ክፍያ ያለበት ሰው፣ግዴታ ቀዳሚ በመሆኑ ከሱናው ተጠው'ዉዕ በፊት በእዳው መጀመር አለበት፡ ከመክፈሉ በፊት ተጠው'ዉዕ መጾም በተለይም ትሩፋቱ የሚያመልጥ ዓይነት እንደ ዓሹራእ፣ዐረፋ፣ስድስት ቀን ከሸዋልና የመሳሰለው ሱንና ጾም ከሆነ ይፈቀድለታል፡ ፡ ይህም ይበልጥ ተገቢው ያለበትን ቀዷእ መጾም ቢሆንም የመክፈያ ጊዜው ሰፊ በመሆኑ ነው።

እስከ ሕልፈተ ሕይወቱ ድረስ ያለበትን ጾሞ ያልከፈለ ሰው፣የተወው በዑዝር ምክንያት ከሆነ ጥፋተኛ አይደለምና ምንም የለበትም። ያለ ዑዝር ከሆነ ግን ክፍያው የረመዷን ከሆነ ለየቀኑ አንድ ደሃ ምግብ ስለርሱ ይሰጥለታል፣ጾሙ ነዝር ከሆነ ተጠሪው (ወሊዩ) ስለሱ ይጾምለታል። በአንዳንድ የዕልም ባለቤቶች አቋም የጾም እዳ እያለበት የሞተ ሰው፣ጾሙ የረመዷን ግዴታ ጾምም ይሁን ወይም የስለትና የመሳሰለው ወሊዩ ስለርሱ ጾሞ ይከፍልለታል። ይህም የአላህ መልእክተኛ ﷺ ‹‹የጾም ክፍያ እያለበት የሞተ ሰው ወሊዩ (ተጠሪው) ስለሱ ይጹምለት።››[1] ብለዋል በሚለው ከዓእሻ (ረዐ) የተላለፈ ሐዲስ አጠቃላይ ይዘት መሰረት ነው። ከእብን ዐባስ (ረዐ) በተላለፈውም መሰረት አንድ ሰውዬ ወደ ነቢዩ ﷺ መጥቶ የአላህ መልእክተኛ ሆይ! እናቴ ሞታለች፣ያንድ ወር ጾም አለባትና እኔ ልክፈልላት? ብሎ ሲጠይቃቸው ፡- ‹‹አዎ፣የአላህ እዳ ከሁሉም ይበልጥ ሊከፈል የተገባ ነው።››[2] አሉ ብለዋል።

(1) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ
(2) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ



